

# የቦሌ ክ/ከተማ ብልጽግና ፓርቲ የኢንስፔክሽንና

# የስነምግባር ኮሚሽን የ2017 ዓ.ም የ2ኛ ሩብ

# ዓመት አፈጻጸም ሪፖርት

ታህሳስ 2017 ዓ/ም

አዲስ አበባ

## 1/ መግቢያ

የብልጽግና ፓርቲ የኢንስፔክሽንና የሥነ-ምግባር ኮሚሽን ከፓርቲው ተቋማዊ መዋቅሮች አንዱ ሲሆን በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብ አንቀጽ 23(6) በርካታ ተግባራትና ኃላፊነቶች ተሰጥተውታል፡፡ ብልፅግና ፓርቲ አሰራሮቹ ዴሞክራሲያዊ ፤ ህጋዊና ተቋማዊ ይዘት እንዲኖራቸው ከሚያግዙ መስፈርቶች መካከል ህገ ደንብና ፕሮግራም በቅርብ ጊዜ ደግሞ አሰራርና አደረጃጀት በዋነኝነት ይጠቀሳሉ ፡፡ ህገ ደንቡ በጉባኤ ከፀደቀ ቡሃላ ይሄንን ተግባራዊ ለማድረግ የሚያስችሉ እና ብልፅግና ፓርቲ በቀጥታ ከሚከታተላቸው ተቋማት ዙሪያ የመዋቅር ፤የአደረጃጀትና አሰራር መመሪያ አዘጋጅቶ በስራ ላይ አውላል ፡፡ ፓርቲያችን ጠንካራ የስምሪት አስጠጥና የመሪነት ሚናው በብቃት በመወጣቱ የውስጠ ፓርቲ ዴሞክራሲ ጤንነት ላለፉት ዓመታት በለውጡ የልማትና የዴሞክራሲ ግንባታ ስራዎቻችን አመርቂ ውጤቶች ተመዝግቦባቸዋል፡፡ ይህ እንደተጠበቀ ሆኖ ባሳለፍናቸው አመታት ከውስጠ ፓርቲ ስራዎች አንፃር መድረስ ከሚገባን ደረጃ ላይ ያልደረስንባቸው ድክመቶች ቀላል አይደሉም፡፡ የብልፅግና ፓርቲ አስተሳሰብና ዴሞክራሲያዊ ጤንነት ከግዜ ወደ ግዜ እየተሻሻለ መምጣቱ የዚህ ዋናው ውጤት ደግሞ የኢንስፔክሽን ና ስነ ምግባር ኮሚሽን ከክ/ከተማ እስከ የመ/ድርጅቱ አጠናክሮ ለመሔድ የተደረገ ጥረት ነው፡፡ ተቋማዊ አሰራርን ይበልጥ ለማጠናከር የብልጽግና ፓርቲ ኢንስፔክሽን እና ስነ-ምግባር ኮምሽን የ2017 እቅድ ላይ በቂ ቅድመ ዝግጅት አድርገን ወደ ተግባር የገባን መሆኑ ይታወቃል ስለሆነም በ2017 ዓ/ም በ2ኛ ሩብ ዓመት ያከናወናቸውን ተግባራት ከዚህ በታች ባሉ ነጠቦች መሰረት እንደሚከተለው ተዘጋጇቷል፡፡

## 2/ ዓላማ

በየደረጃው የኮሚሽኑን ተቋማዊ አቅም በሁለንተናዊ ረገድ በማጠናከር በፓርቲው መተዳደሪያ ደንብ የተሰጡትን ተግባርና ኃላፊነቶች በየወቅቱ የኢንስፔክሽን ሥራ በብቃት በማከናወን ለፓርቲው እሴት ሊጨምሩ የሚችሉ ግኝቶችን ከምክረ-ሀሳቦች ጋር ግብረ መልስ በመስጠት ለፓርቲው ጥንካሬ የበኩሉን አስተዋጽኦ ማድረግ ነው፡፡፡፡

## 3/ የኮሚሽኑ ቁልፍ ተግባር

የኮሚሽኑን መዋቅር ከክ/ከተማ እስከ መሰረታዊ ድርጅት በማጠናከር እና የአቅም ግንባታ ስራ በመስራት የፓርቲዉ አሰራሮች እንዲከበሩ እና የፓርቲው ውስጠ-ዴሞክራሲ እንዲጠናከር ማድረግ፡፡

ዋና ዋና ተግባር

### ግብ 3.1. የዝግጅት ምዕራፍ

በየደረጃው ካለው የኮሚሽን መዋቅር የ2016 በጀት ዓመት አፈጻጸም በመገምገም የነበሩ ጥናካሬዎችን ይበልጥ ማጠናከርና በሂደቱ የተስተወሉ ጉለቶችን ነቅሶ በማውጣት የመነሻ ሁኔታ አካል በማድረግ ይህንን አፈፃፀም መነሻ ያደረገ የአመራር ምዘና የተደረገ ሲሆን ክ/ከተማ መገምገምና መመዘን የነበረበት ወንድ 7 ሴት 4 ድምር 11 ሲሆን የተገመገመና የተመዘነ ወንድ 7 ሴት 4 በድምሩ 11 ሲሆን በጣም ከፍተና 1 ከፍተኛ 10 ውጤት የተሰጠ ሲሆን በወረዳ ደረጃ 11 የኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት ኃላፊዎች የተመዘኑ ሲሆን **4 ከፍተኛ 7 መካከለኛ** ውጤት የተሰጠ ሲሆን እንዲሁም 77 የኮሚሽን ኮሚቴ በመገምገምና በመመዘን **47 ከፍተኛና 30 መካከለኛ** ውጤት የተሰጠ ሲሆን በ124 መ/ድርጅት ተቋምም ግምገማና ምዘና በማካሄድ በአጠቃላይ በየደረጃው የሚገኙ መገምገምና መመዘን ከነበረበት **708 ውስጥ 708 የኮሚሽን ኮሚቴ በግምገማና ምዘና እንዲያለፍ ደረገ ሲሆን**

- በጥንካሬቁጭት የፈጠረ መሆኑ የኮሚሽን ኮሚቴዎችን ያነሳሳ መሆኑ
- ኮሚሽኑን ለማጠናከር መሰረት የጣለ መሆኑ
- ጠንካራ ፓርቲን በመገንባት ህያውነትን ማረጋገጥ የቀጣይ ተልዕኮ መሆኑን የአስተሳሰብና የተግባ አንድነት መፈጠሩ
- የግምገማ መነሻ የሚሆን ነጥቦችን እንዲሀመገም በፅሑፍ በመስጠት ትግል እንዲደረግ ያገዙ ወረዳዎች መኖራቸው
- ተገሚጋሚው እራሱን ወደ ውስጥ ለማየት የሞከረበት አግባብ ለመማር ያለውን ዝግጁነት ያመላከተ መሆኑ
    - ❖ በድክመት
- ኮሚሽኑን ከማጠናከር አንፃር ምክኒያት በመደርደር ማፈናጠር
- የወረዳ ኮር አመራሩ ዘንድ በተቋም መገምገሙን እምነት ማጣት የበሰለ ግምገማ አይደረግም ብሎ ማቅለል
- በመጨረሻም የእውቅናና ሽልማት ሰርተፊኬት ሽልማት ተሰትቶ ለቀጣይ ተልዕኮ መነሳሳትን እንዲፈጥር ተደርገዋል ፡፡

❖ በየደረጃው የሚገኘው የኮሚሽኑ መዋቅር አደረጃጀትን በተመለከተ ያለበት ሁኔታ የክፍለ ከተማ የወረዳ እና የመ/ድርጅት አደረጃጀት፣ መልሰው ስለመደራጀታቸው ፡፡

የኮሚሽኑን አደረጃጀት መልሶ ከማደራጀት አንጻር በክፍለ ከተማ ደረጃ 2 ወንድ አመራር በቋሚነት ተመድበዉ እየሰራ ሲገኝ በክ/ከተማ በማኔጅመንት ኮሚቴነት እና ኮሚሽን ኮሚቴነት የሚያገለግሉ የነበሩ ነገር ግን በተለያየ ምክንያት ተግባር ያንጠባጠቡ እና የወጡትን አመራሮች መልሰን በመተካት የኮሚሽን ኮሚቴ ማደራጀት የተቻለ ሲሆን ወንድ 7 እና ሴት 4 ድምር 11 ናቸዉ እነዚህም በኮንፍራንስ የማፀደቅ ስራም ተሰርቷል ፡፡ በወረዳ ደረጃ ቋሚ አመራር 7 ወንድ 4 ሴት በድምሩ 11 አመራር መልሶ ማዋቀር ተችሏል ፡፡ በተመሳሳይ በወረዳ ደረጃ የኮሚሽን ኮሚቴ 50 ወንድ እና 27 ሴት በድምሩ 77፣እንዲሁም ባሉን 125 መሰረታዊ ፓርቲ ላ ወንድ 419፣ሴት 206 በድምሩ 625 ሲሆን በአጠቃላይ ወንድ 476 እና ሴት 237 በድምሩ 713 የኮሚሽን ኮሚቴ እና የመ/ድርጅት ኮሚቴ የማደራጀት ስራ ተሰርቶ ለኮሚሽኑ ተግባር አቅም የመሆን ስራ እየሰሩ ይገኛሉ፡፡

- **የእቅድ ዝግጅት** በተመለከተ የከተማ ኮሚሽን ዓመታዊ እቅድ መነሻ በማድረግ ከክፍለ ከተማ እስከ እስከ መ/ድርጅት ድረስ የ2016 በጀት አፈጻጸምን እንደ መነሻ ሁኔታ ባከተታና በተደራጀ ሁኔታ የራሳቸውን እቅድ እንዲያዘጋጁ ከማድረግ አንፃር፣ የ2017 በጀት አመት የኮሚሽኑን እቅድ ዝግጅት በተመለከተ የከተማውን መሪ እቅድ መነሻ በማድረግ ወደ ክ/ከተማ በመቀየርና እንዲሁም ለ11ዱም ወረዳና መልሶ ከተደራጁ 125 መ/ፓርቲ እቅዱን በማውረድ ኮሚሽኑ በሚከታተላቸው በአራቱም ማህበራዊ መሰረቶች አኳያ 100 ፐርሰንት እቅዳቸውን የመነሻ ሁኔታንና የኮሚሽን መዋቅርንና የሚመለከታቸውን አካላት በማሳተፍ **የእቅድ ትስስር** በማድረግና የከተማውንም ሆነ የክ/ከተማውን ወረት ባካተተ መልኩ እንዲያቅዱ በማድረግ ወደ ተግባር የተገባ ሲሆን  በዚህም ከእቅድ ዝግጅት ጋር የነበሩ ችግሮችን በማስተካከል እስከ ታች መሰረታዊ ድርጅት ድረስ የተሟላ እቅድ ማቀድ ተችሏል፡፡

### 3.1.2 የእቅድ ኦሬንቴሽን ከመስጠት አኳያ፣ ለእቅድ ፈጻሚው አካል በየደረጃው የተሰጠ ኦሬንቴሽን፤

ከክፍለ ከተማ እስከ መ/ድርጅት ድረስ እቅድ ኦሬንተሽን እንዲሰጡ በተቀመጠዉ አቅጣጫ መሰረት የኦረንቴሽን አጭር ዕቅድና ቼክ ሊስት በማውጣትና ባለድርሻ አካላትን ሊያሳተፍ በሚችል መልኩ በ11ዱም ወረዳ እና 125 መ/ድርጅት ላይ እቅድ ኦሬንቴሺን በመስጠት ፈፃሚውን አካል ማዘጋጀት ተችሏል፡፡ ክፍለ ከተማም እቅዱን ከባለድረስሻ አካላት እና ወረዳ ኮሚሽን አመራር ጋር እቅድ ውይት በማድረግ የበጀት አመቱን ተግባር በጠንካራ መንፈስ ለመፈፀም የሚያስችል ሃይል የማዘጋጀት የእቅድ ትስስር የማድረግ  ስራ የተሰራ ሲሆን 100 ፐርሰንት ዕቅድ ኦረንቴሽን እንዲሰጡ የማስቻል ስራ ተሰርቷል ፡፡

**ድምዳሜ**

የዝግጅት ምዕራፍ ስራ ለተግባር ምዕራፍ መሰረት በመጣል ረገድ ከፍተኛ ሚና ስለሚጨወት የዝግጅት ምዕራፍ በትኩረት ለመስራት እራሱን የቻለ በዕቅድ አውጥቶ መንቀሳቀስ ለተሻለ ውጤት እንደሚያበቃ እና ለተግባር ምዕራፍም አቅም መሆን የቻለ ሲሆን በሂደቱ የመልሶ ማደራጀት ምዕራፍ ወቅት የተንጠባጠቡ ተግባራት እራሱን የቻለ ተግዳሮት ስለሚሆን በቀጣም የዝግጅት ምዕራፍ በትኩረት  ማለፍ እንደሚገባ ትምህርት ተወስዷል ፡፡

**የተግባር ምዕራፍ**

**የቁልፍ ተግባር አፈፃፀም**

**ግብ1. በየደረጃው የኮሚሽን መዋቅር ማዘጋጀት**

**ተግባር1.  በየደረጃው በሚገኘው በፓርቲ አደረጃጀት እስከ መሰረታዊ ድርጅት ድረስ የኮሚሽኑን አባላት በኮንፍራንስ ማስመረጥ ማቋቋም ፡፡**

በክ/ከተማ ደረጃ የኮሚሽን ኮሚቴ ማቋቋም የተቻለ ሲሆን ወንድ 7 እና ሴት 4 ድምር 11 ናቸዉ እነዚህም በኮንፍራንስ የማፀደቅ ስራም ተሰርቷል፣በተመሳሳይ በወረዳ ደረጃ የኮሚሽን ኮሚቴ  50 ወንድ እና 27 ሴት በድምሩ 77፣የመሰረታዊ ፓርቲ ወንድ 419፣ሴት 206 በድምሩ 625 ሲሆን በአጠቃላይ ወንድ 476 እና ሴት 237 በድምሩ 713 የኮሚሽን ኮሚቴ እና የመ/ድርጅት ኮሚቴ የማቋቋም ስራ ተሰርቶ በሁሉም ደረጃ በኮንፍራንስ ማፀደቅ ተችሏል ፡፡

**ተግባር2. የኮሚሽኑ አባላት በመመሪያው መሰረት መሟላታቸው**

በአደረጃጀት መመሪያ መሰረት በክ/ከተማ አስራ አንድ የኮሚሽን ኮሚቴ ፣በወረዳ ደረጃ ከአምስት እስከ ሰባት በሚለው መሰረት በአስራ አንዱም ወረዳ ጣሪውን 7 በመውሰድ 77 ኮሚቴ ፣በመሰረታዊ ድርጅት ደረጃ አምስት በሚለው መመሪያ መሰረት 125 መሰረታዊ ድርጅት ላይ 625 ኮሚቴ እንዲደራጅ ተደርጎ በሁሉም ደረጃ 100 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል

**ተግባር3. ከክፍለ ከተማ ጀምሮ እስከ ወረዳ ድረስ የኮሚሽን ቅርንጫፍ ፅ/ቤቶች የሰው ኃይል ምደባ መደረጉን**

በክፍለ ከተማ ደረጃ መመደብ ያለበት 2 የተመደበ 2 ወንድ አመራር በቋሚነት ተመድበዉ እየሰራ ሲገኝ ፣በወረዳ ደረጃ መመደብ ያለበት 11 የተመደበ ቋሚ አመራር 7 ወንድ 3 ሴት በድምሩ 11 አመራር እንዲመደብ በማድረግ 100 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል ፡፡

**ተግባር 4 ኮሚሽኑን ይበልጥ ለማጠናከር ዘንድ የልምድ ልውውጥ ከማድረግ አንፃር**

ምርጥ ተሞክሮንና የተሸሉ ልምዶችን በመቅሰም የኮሚሽን ተቋምን ለማጠናከር 1ጊዜ ከቂርቆስ ክ/ከተማ አቻችን እና ከትራንስፖርት ቢሮ ኮሚሽን ቤተሰብ ጋር ልምድ ልውውጥ ማድረግ ተችሏል

**ተግባር5 ተግባሩን ከማስፈፀም አንጻር ጠንካራና ደካማ ጎን**

ጠንካራ ጎን

- የቁልፍ ተግባር የማስፈፀም አቅም ማደጉ
- የኮሚሽን ተግባራት በእቅዳችን መሰረት እየተከናወነ መሆኑ
- የባላ ድርሻ አካላት ተሳትፎ ከጊዜ ወደ ጊዜ እየጨመረ መምጣቱ
- ጠንካራ ክትትልና ድጋፍ ማድረግ መቻሉ
- የኮሚሽን ተቋም የተፈላጊነትና አምኖ የመቀበል ደረጃ እያደገ መምጣቱ

ደካማ ጎን

- አሁንም የኮሚሽን ኮሚቴ በደራሽ የፀጥታና የኮርደር ስራ ላይ በመጠመዱ የኮሚሽን ተግባራት ላይ መጠነኛ ጊዜ እየወሰደ መሆኑ

**ግብ2. ለኮሚሽኑ አባላትና ለሁሉም የፓርቲያችን አባላት የአቅም ግንባታ ስልጠና መስጠት**

**ተግባር1. ከክፍለከተማ ጀምሮ እስከ ወረዳ ለኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት ኃላፊዎች የተሰጠ ስልጠና**

- አዲሱ አሰራርና አደረጃጀት መመርያ ፣የድስፕሊን መመሪያ ፣ አቤቱታ አፈታት መመሪያ እና በሌሎች መመሪያዎች ላይ ከክ/ከተማ እስከ ወረዳ ለ13 ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት ኃላፊዎች እና ስልጠና ለመስጠት ታቅዶ ለ13 አመራር ስልጠና መስጠት ተችሏል፡፡
- **ተግባር2..** በየደረጃው ከሚገኘው የፓርቲ አደረጃጀት ጋር ስልጠና ማስፈጸሚያ እቅድ ማዘጋጀት፣የማዘጋጀት ስራም መስራት ተችለዋል

**ተግባር 3፣ ከከፍለ ከተማ ጀምሮ እስከ መሰረታዊ ድርጅት ድረስ በየደረጃው ለኮሚሽን አባላት የተሰጠ ስልጠና**

- ክ/ከተማ ደረጃ ጀምሮ እስከ መ/ድርጅት ለሚገኙ 713 የኮሚሽን ኮሚቴዎች ስልጠና ለመስጠት ታቅዶ በድምሩ ለ1019 **በድግግሞሽ** የኮሚሽን ኮሚቴዎች ስልጠና መስጠት ተችሏል ፡፡

**ተግባር4. በበጀት ዓመቱ ለፓርቲ አባላትና አመራር በኮሚሽኑ መመሪያ ላይ የተሰጠ ስልጠና**

- አዲሱ አሰራርና አደረጃጀት መመርያ ፣ የድስፕሊን መመሪያ፣አቤቱታ አፈታት መመሪያ እና በሌሎች መመሪያዎች ላይ ከክ/ከተማ እስከ ወረዳ ድረስ ለሚገኙ አመራሮች ስልጠና ለመስጠት ለ408 አባላት ስልጠና ለመስጠት ታቅዶ 398 አመራር ስልጠና መስጠት ተችሏል ፡፡
- አዲሱ አሰራርና አደረጃጀት መመርያ ፣ የድስፕሊን መመሪያ፣አቤቱታ አፈታት መመሪያ እና በሌሎች መመሪያዎች ላይ ከክ/ከተማ እስከ ወረዳ ድረስ ለሚገኙ 30612 አባላት ስልጠና ለመስጠት ታቅዶ29,898 አባላት ስልጠና መስጠት ተችሏል ፡፡

ተግባር4. በስልጠናዎቹ የተገኙ ውጤቶች

- ስለ ኮሚሽን ተግባርና ኃለፊነት ግንዛቤ በመጨመሩ ኮሚሽኑ የሚሰራቸው ተግባራት ድጋፍ ማግኘት መቻሉ
- የኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት አመራሮች ጋር የሚጋጩ ተግባራት ስምሪት ላይ መሻሻል ማሳየቱ
- የበጀት ድጋፍ እየተደረገ መሆኑ
- የድስፕሊን መመሪያዎች ተግባራዊ ማድረግ መጀመሩ

**ተግባር 5. በየደረጃው የሚሰጡ ስልጠናዎች እውቀትን ልምድ ያላቸው አካላት እንዲመሩ ከማድረግ አንፃር ትኩረትና ትርጉም ባለው መልኩ ለመምራት ትረት እየተደረገ ነው**

**ተግባሩን ከማስፈፀም አንፃር የታዩ ጠንካራና ደካማ ጎን**

ጠንካራ ጎን

- ጠንካራ ቅድመ ዝግጅት መደረጉ
- የባነር በማሳተም መድረኩን ለማድመቅ መቻሉ
- የሻይ ቡናና የምሳ ዝግጅት መደረጉ
- የሰነድ ዝግጅት መድረኩን የሚመጥን ተደርጎ ግልፅ በሆነ መንገድ መዘጋጀቱና የተሸለ ፕረዘንቴሽን መደረጉ

ደካማ ጎን

- የተወሰነ አመራርና አባላት መንጠባጠብ መስተወሉ

ግብ3. የግበዓት አቅርቦት እንዲሟላ መደረጉ

ተግባር1. በየደረጃው የሚገኝ የኮሚሽን አደረጃጀት እስከ ወረዳ ድረስ ኮሚሽኑን ፅ/ቤት መስሪያ ቦታ ባደራጀት በተመለከተ

- የኮሚሽን ግብዓት ከማሟላት አንጻር ከክ/ከተማ እስከ ወረዳ ድረስ ያለውን የቢሮ እና ለቢሮ የሚስፈልጉ ቁሳቁሶች እንዲሟሉ ከማድረግ አንጻር የክ/ከተማ 2 ቋሚ አመራር 2 ቢሮ በመጠቀም ስራ እየሰራ ይገኛል፡፡
- ከወረዳዎች አንጻር ሲታይ በ11 ወረዳዎች ስራ ሊያሰራ በሚችል መልኩ ቢሮ እንዲኖራቸው የተደረገ ሲሆን በሁሉም በሚባል መልኩ የተሻለ ቢሮ እንዳላቸዉ እና ስራን የሚያሰራ እንደሆነ ለማየት ተችሏል፡፡

ተግባር2. ለኮሚሽኑ ስራ የሚያስፈልግ የቢሮ መገልገያ ቁሳቁሶችና ሎጅስቲክ እንዲሟላ ስለ መደረጉ

- ከቢሮ ግብአት አንጻር ታች በመውረድ በተደረገ ድጋፍና ክትትል በተገኘው መረጃ መሰረት ለቢሮ አገልግሎት የሚውሉ /ኮምፒዩተር፣ፕሪንተር፣ሸልፍ ወዘተ የመሳሰሉትን ተደረሸ ከማድረግ አንጻር ስራ ሊያሰራ የሚችል ቁሳቁስ እንዳላቸው ለማየት ተችሏል፡፡

ተግባር3. ለኮሚሽኑ ስራ የሚያስፈልግ በጀት በየደረጃው ስለመመደቡ

- የተመደበ በጀት **3.8 ሚሊዮን** ብር በጀት ተመድቦ እየተጠቀምን እንገኛለን

## ግብ.4 የኮሚሽኑ ክትትልና ድጋፍ ስራችን በተመለከተ

ተግባር1.በየደረጃው የአንድ እቅድ አንድ ሪፖርት ፎርማት ለ11ዱም ወረዳ ቀርፆ በመላክ ወጥ የሆነ የሪፖርት ስረዓት እንዲኖር ተደርጓል

ተግባር 2 በየደረጃው የሚገኝ የኮሚሽን ቅርንጫፍ ፅ/ቤቶች በአንድ እቅድ ፣ አንድ ሪፖርት፣ አንድ ምዘና መርህ አመታዊ ሪፖርት አዘጋጅተው አንድ ደረጃ ከፍ ብሎ ለሚገነው ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት ስለመላኩ

- የክ/ከተማ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት አንድ ደረጃ ከፍ ብሎ ለሚገኘው የከተማ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት በሩብ ዓመቱ የሚልክ ሲሆን በዚህም በዓመቱ 2 ጊዜ ለመላክ ታቅዶ 2ጊዜ መላክ ተችሏል
- የወረዳ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት አንድ ደረጃ ከፍ ብሎ ለሚገኘው ክ/ከተማ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት በሩብ ዓመት 2 ጊዜ ለመላክ ታቅዶ 11ዱም ወረዳ 2 ጊዜ መላክ ተችሏል

ተግባር3 በየደረጃው የሚገኘው የኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤቶች በየሩብ ዓመቱ በመመሪያ መሰረት ሱፐርቪዢን ስለማካሄዳቸው

- በኮሚሽን መዋቅር ላይ በክ/ከተማ ደረጃ አንድ ደረጃ በመውረድ 2 ጊዜ ማድረግ የተቻለ ሲሆን በ11ዱም ወረዳ በተመሳሳይ መልኩ አንድ ደረጃ ዝቅ በማለት በ125 መ/ድርጅት ላይ 2 ጊዜ ማድረግ ተችሏል ፤በአጠቃላይ 149 ግዜ ለማድረግ ታቅዶ 134 ማድረግ የተቻለ ሲሆን 90 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል ፡፡

ተግባር4. በየደረጃው የሚገኘው የኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤቶች በየሩብ ዓመቱ እንስፔክሽን ስለማካሄዳቸው

- የክ/ከተማ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት በመተዳደሪያ ደንቡ አንቀፅ 23/ተ በተሰጠው ተግባርና ኃላፊነት መሰረት በሩብ ዓመት 2 ጊዜ እንስፐክሽን ለማድረግ ታቅዶ 2 ጊዜ በ11ወረዳዎች በማድረግ ለሚመለከተው አካል ግብረመልስ ከምክረ ኃሳብ ጋር በመስጠት ጠንካራ ክትትልና ድጋፍ ማድረግ ተችሏል ፡፡
- የወረዳ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት በመተዳደሪያ ደንቡ አንቀፅ 23/ተ በተሰጠው ተግባርና ኃላፊነት መሰረት በ11ዱም ወረዳ እያንዳዱ ወረዳ በሩብ ዓመት 2 ጊዜ እንስፐክሽን ለማድረግ ታቅዶ 2 ጊዜ በጥቅሉ 22 በማድረግ ለሚመለከተው አካል ግብረመልስ ከምክረ ኃሳብ ጋር በመስጠት ጠንካራ ክትትልና ድጋፍ ማድረግ ተችሏል ፡፡

ተግባር3. በየደረጃው የሚገኘው የኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤቶች በየሩብ ዓመቱ የአፈፃፀም ግምገማ ስለማካሄዳቸው

- በክ/ከተማ ደረጃ በሩብ ዓመቱ 2ጊዜ የስራ አፈፃፀም ግምገማ ለማድረግ ታቅዶ 2ጊዜ የስራ አፈፃፀም ግምገማ ማድረግ ተችሏል
- በወረዳ ደረጃ በ11ዱም ወረዳ በዓመቱ 22ጊዜ የስራ አፈፃፀም ግምገማ ለማድረግ ታቅዶ 22 ጊዜ የስራ አፈፃፀም ግምገማ ማድረግ ተችሏል

ተግባር 5፡ በየደረጃው ለሚገኙ የኮሚሽን ቅ/ጽ/ቤቶች የሱፐርቪዥን ግኝቶች የተሰጠ ግብረ መልስ እቅድ ከንውን በመቶኛ፣

- እንደ ክ/ከተማ በወረዳ ደረጃ ያለው ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት 11 ሲሆን በእያንዳንዱ ወረዳ እንደ ክ/ከተማ አንድ ደረጃ ወርዶ በሩብ ዓመት 2 ጊዜ ሱፐርቪዥን ለማድረግ ታቅዶ 2 ጊዜ ማለትም 22 በማድርግ የግኛት ግብረ መልስ መስጠት ተችሏል ፡፡

ተግባር 6፡ በየደረጃው ለሚገኙ የፓርቲ ጽ/ቤቶች የተሰጡ ግብረ መልስ/ግኝቶች እቅድ ክንውን በመቶኛ፣

- በየደረጃው ለሚገኙ የፓርቲ ጽ/ቤቶች ለክ/ከተማ ፓርቲ ቅ/ፅ/ቤቶችና 11 ወረዳ ፓርቲ ቅርንጫፍ ፅ/ቤት በየሩብ ዓመቱ ክትትልና ድጋፍ በድምሩ በሩብ ዓመቱ 2 ጊዜ የግኝት ግብረ መልስ ለምስጠት ታቅዶ 2 ጊዜ በጥቅሉ 22 መስጠት ተችሏል ፡፡

ተግባር 7፡ ኮሚሽኑን ለማጠናከር ይቻል ዘንድ የተለያዩ የልምድ ልውውጥ ወይም ምርጥ አፈጻጸም በመቀመር ተግባራዊ ስለመደረጉ፣

- ኮሚሽኑን ለማጠናከር ይቻል ዘንድ የተለያዩ የልምድ ልውውጥ ከቂርቆስ ክ/ከተማ አቻችን እና ከትራንስፖርት ቢሮ ኮሚሽን ጋር 1 ጊዜ ማድርግ ተችሏል ፡፡

ተግባር 8፡ በየደረጃው በሚገኘው የኮሚሽኑ ቅ/ጽ/ቤቶች በበጀት ዓመቱ መጨረሻ የላቀ የሥራ አፈጻጸም ላስመዘገቡ እውቅናና ሽልማት ስለመስጠቱ እቅድ ክንውን በመቶኛ፡፡

- በየደረጃው በሚገኘው የኮሚሽኑ ቅ/ጽ/ቤቶ የላቀ የሥራ አፈጻጸም ላስመዘገቡ 24 አካላት እውቅናና ሽልማት መስጠት ተችሏል ፡፡

ተግባር9. ተግባሩን ከማስፈጸም አንጻር የታዩ ጠንካራና ደካማ ጎኖች ተለይተው ይቀመጡ፡፡
በጥንካሬ

- በሩብ ዓመቱ ጠንካራ እንስፔክሽን ማድረግ በመቻሉ የውስጠ ፓርቲ አሰራርና አደረጃጀት መመሪያ በመተግበር ለውጥ እየመጣ መሆኑ
- በተሰጡ ግብረ መልስና ምክረ ኃሳብ ላይ ፈጠን ምላሽ /የግብረ መልስ ግብረ መልስ መስጠት መጀመሩ
  በክፍተት የለም

➢ <u>**ድምዳሜ**</u> - *የቁልፍ ተግባር የኮሚሽኑ የመፈጸምና የማስፈጸም አቅም ማደግ በመቻሉ ተቋማዊ ኢይታ እየተሸሻለ መምጣቱና በዚህም ከባለፈው ኣመት ሲነፃፀር እምርታዊ የመፈፀም አቅም ማሳደግ ተችሏል ፡፡*

➢ **<u>ግብ 5፤</u> ግብ5፡የኮሚሽኑንየቴክኖሎጂ(ICT)አጠቃቀምናየኮሙንኬሽንአቅምማሳደግ**

*ተግባር* በየደረጃው የኮሚሽኑን የስራ እንቅስቃሴ በየወቅቱ በማህበራዊ ሚዲያ (Facebook,What'sUp,ZoomMeeting…etc) ለውስጥ እናለውጭተግባቦትተደራሽማድረግ፣

- ከክ/ከተማ እስከ ወረዳ የመረጃ ልውውጥና መረጃ አያያዝ ከማዘመን አንፃር የኮሚሽኑን መዋቅር ድረገፅ በማልማት 713 የኮሚሽን ኮሚቴዎችን ወደ ዳታ ቤዝ ማስገባት የተቻለ ሲሆን 1ዋትሳት 1 ቴሌ ግራምና 1 የፌስቡክ 941 ተከታይ ያለው አማራጮችን መጠቀም ተችሏል ፡፡

**የዓበይት ተግባራት አፈጻጸም፡ ለኮሚሽኑ በተሰጡ ተግባራትና ኃላፊነቶች ላይ ተገቢውን ክትትልና ቁጥጥር ማካሄድ፣**

***ግብ አንድ- የፓርቲ መተዳደሪያ ደንብና መመሪያዎች ስራ ላይ መዋላቸውን መከታተል፣***

**ግቡን ለማሳካት የተከናወኑ ተግባራት**

ተግባር 1፡ በፓርቲው መተደደሪያ ደንቡና ልዩ ልዩ መመሪያዎች ላይ ለአባላትና አመራር ግንዛቤ ስለመፈጠሩ፣

- በፓርቲው መተደደሪያ ደንቡና ልዩ ልዩ መመሪያዎች ላይ አመራር ግንዛቤ ለመፍጠር የታቀደ እቅድ የለም ፣ እንዲሁም መ/ድርጅት አመራርና አባላት ስልጠና ለመስጠት ባታቀድም ለ100 መ/ድርጅት አመራርና አባላት ስልጠና መስጠት ተችሏል

ተግባር2፡ የፓርቲው መተደደሪያ ደንብና መመሪያዎች ለአባላትና አካላት ተደራሽ ስለመሆናቸው፣

- የፓርቲው መተደደሪያ ደንብና መመሪያዎች ስራን ሊያሰራ የሚችል መመሪያ መኖሩ
- መመሪያዎቹ በአግባቡ በሃርድና ሶፍት ኮፒ ተደራጅተውና ተሰንደው መያዛቸው

ተግባር 3፡ በየደረጃው የሚገኘው የፓርቲ መዋቅር በመተደደሪያ ደንቡንና በመመሪያዎችን ተከትሎ ተግባራትን እየፈጸመ ስለመሆኑ፡

- በተደረገበ ክትትልና ድጋፍ እንዲሁም በተሰጡ ግብረ መልስ መሰረት በመተደደሪያ ደንቡንና በመመሪያዎችን ተከትሎ ተግባራትን የመፈፀም ባህሉ እደገ መጥቷል ፡፡

1. የፓርቲ አባላት በሙሉ በህዋስና መሰረታዊ ድርጅት ስለመደረጃታቸው

- በአሰራርና አደረጃጀት መመሪያ መሰረት ህዋስና መ/ድርጅት እየተደራጀ መሆኑ በዚህም 74643 አባላት በ362 የመሰረታዊ ድርጅት ተቋም እና በ2184 የህዋስ ተቋም በአሰራር መሰረት ማደራጀት ተችሏል ፡፡

2. የፓርቲ አካላት(አስተባባሪ ኮሚቴ፣ የመ/ድርጅት ኮሚቴና የህዋስ ኮሚቴ) መደበኛ የግንኙነት ጊዜ፣

- የፓርቲ አካላት(አስተባባሪ ኮሚቴ በሰራሩ መሰረት በቋሚነት እየተገኛኙ ስራዎችን የሚገመግሙ ሲሆን የመ/ድርጅት ኮሚቴና የህዋስ ኮሚቴ) መደበኛ የግንኙነት ጊዜ አልፍ አልፎ መንጠባጠብ የሚታይበት ነው ፡፡

3. የአባላት ምልመላ፡-በየማህበራዊ መሰረት ከቢሮ ፣ ከት/ቤት ፣ ከባለሀብት፣ ከመኖሪያ፣ ከጥቃቅን ፣ ከወጣት ሊግ እና ከሴት/ሊግ በአጠቃላይ 782 ለመመልመል ታቅዶ 971 አባላት መመልመል ተችለዋል ፡፡
4. ኮንፈራንስ(ከመ/ድ/ት እስከ ክፍለ ከተማ) በየደረጃው በየሩብ ዓመቱ አሰራሩን ጠብቆ 2 ጊዜ ለማድርግ ታቅዶ በክ/ከተማ ና በወረዳ ደረጃ በሂደት ላይ ያለ ሲሆን፣ በወረዳ እንዲሁም ባሉን 125 በመሰረታዊ ድርጅት ውስጥ በእንዳንዱ 2 ጊዜ ማድረግ ተችለዋል ፡፡

5. የአመራር ምደባ/ስምርት፡፡

- የአመራር ስምሪትና ምደባ ተቋማዊ በሆነ መልኩ እተሰራ መሆኑ ፣ በፓርቲ ኮሚቴ ፣በአተባባሪ ኮሚቴ ስምሪት አሰጣጥ ስርዓት መኖሩ ፣ ውጤታማነትን መነሻ ያደረገ ስምሪትና ምደባ እየተሰጠ እና አመራር ሲመደብ በኮር ተለይቶ መስፈርቱን ባሟላ መልኩ የኮር ስርዓት ማዕከል ያደረገ ፡፡

ተግባር 4፡ የመተደደሪያ ደንቡና መመሪያዎች አሰራር ጥሰት ወይም ግድፈት ሲያጋጥም የአሰራር ሥርዓት ጠብቆ የእርምት ርምጃ በወቅቱ ስለመወሰዳቸው

- በአጠቃላይ የፓርቲ አባላት መብቶች የማስከበር እና አባላት ግዴታቸውን ከመወጣት አኳያ ሲታይ በየጊዜው በሚደረገው ትግልና የግንዛቤ ፈጠራ ስራ በአግባቡ ተግባራዊ እየተደረገ መሆኑ የተሻለ ነው። በቀጣይ ሁሉም አባል አሳታፊ በሆነ መልኩ መስራት ያስፈልጋል።

ተግባር 5፡ በየደረጃው በሚደረጉ ኮንፈረንሶች የተሰሩ ስራዎች ለአባላት ሪፖርት ቀርቦ ስለመገምገማቸውና ስለመጽደቃቸው እቅድ 125 መሰረታዊ ድርጅት 2 ጊዜ ለማድረግ ታቅዶ በ125 መ/ድርጅት ላይ 2 ጊዜ ማቅረብ ተችሎ 100 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል፡፡

- ያልፀደቁ የኢንስፔክሽንና ስነ ምግባር ኮሚሽን አመራሮች ፅድቀት መከናዎን መቻሉ በዚህም በ125 መ/ድርጅት 625 የኮሚሽን ኮሚቴዎችን ማፀደቅ ተችለዋል 100 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል
- በተደረጉ በኮንፍራንሶች የኮሚሽን እቅድ ሪፖርት የማረብ ስረዓት ተለምዷል 2 ጊዜ ማቅረብ ተችሏል ፡፡

**ግብ 2፡- የፓርቲው የፖለቲካ ጥራቱ ማረጋገጥ፣**

ተግባር 1፡ በየወቅቱ የአባላትና አመራሩ ፓለቲካዊ አመለካከት ሊያጎለብቱ የሚችሉ ጽሁፎች በማዘጋጀት ወይም ከማዕከል በሚላኩ ልሳናት ውይይት ስለመደረጉ እቅድ ክንውን በመቶኛ፣

- ለአባላትና አመራሩ ፓለቲካዊ አመለካከት ሊያጎለብቱ የሚችሉ የተለያዩ ጽሁፎች በማዘጋጀት ውይይት መደረጉ ፣ ከማዕከል የሚላኩ የመወያያ ሰነዶች ላይ በየደረጃው ውይይት ማድረግ መቻሉ ፣ በጽንፈኝነትና አክራርነት አመለካከት ላይ አመራሩና አባሉ እየተገለ መሆኑ፣ የአመለካከት ጥራት ችግር ያለበትን አመራር አሰራሩን ጠብቆ የእርምት እርምጃ እየተወሰደ መሆኑ ፣ ብልሹነት በሚታይባቸው አመራር አሰራሩን ጠብቆ የእርምት እርምጃ መወሰዱ ፣ ፓርቲ በተለያዩ ዙሮች ለአመራር የተሰጡ ስልጠናዎች ብዥታን በመቅረፍ የአመራሩን የአመለካከትና ተግባር አንድነት የፈጠራ መሆኑ ለአብነት ከእዳ ውደ ምንዳ፤ጥሩ ውህደት መፍጠር ተችሏል ፡፡

ተግባር 2፡ ፓርቲው የሚመራበት የመደመር እሳቤ፣ መርሆች፣ እሴቶች እና የፖለቲካ ፕሮግራም አቋሞች ላይ ለአመራሩና ለአባላቱ ግልጽነት/ስልጠና/ የተፈጠረ ስለመሆኑ፡፡

- የፓርቲው አመራርና አባላት ፓርቲው የሚመራበት የመደመር እሳቤ፣እሴቶች፣ የአሰራር መርሆዎች እና የፖለቲካ ፕሮግራም አቋሞች ላይ ግልጽነት በየደረጃው አመራርና አባላት እየተሰጠ ይገኛል ፡፡

ተግባር 3፡ የፓርቲውን ዓላማ ከሚያደናቅፉ ከጽንፈኝነትና አክራርነት/ዋልታ ረገጥ/ አመለካከትና ተግባር እንዲሁም የፓርቲውን አንድነት በሚጎዱ አባሉ እና አመራሩ የጸዳ መሆኑና በሚታዩት ጉድለቶች ላይ የሃሳብ ትግል እየተደረገ ስለመሆኑ በአብነት ይቀመጥ፣

- በጽንፈኝነትና አክራርነት አመለካከት ላይ አመራሩና አባሉ እየተገለ መሆኑ፣ የአመለካከት ጥራት ችግር ያለበትን አመራር አሰራሩን ጠብቆ የእርምት እርምጃ እየተወሰደ መሆኑ ፣ ብልሹነት በሚታይባቸው አመራር አሰራሩን ጠብቆ 1 አመራር የጠላት አጀንዳን ይዞ በመንቀሳቀሱ የእርምት እርምጃ መወሰዱ

ተግባር 4፡ የፖለቲካ አመለካከት ችግር በሚታይባቸው አባላት ላይ የአሰራር ሥርዓት ጠብቆ የእርምት ርምጃ እየተወሰደ ሲሆን 3 አመራርና አባላት ላይ እርምጃ መውሰድ ተችሏል፣

**ግብ 3፡- የስነ ምግባር ጤናማነት በፓርቲ ውስጥ ማረጋገጡ፣**

ተግባር 1፡ በፓርቲ የዲሲፕሊን መመሪያ ላይ ለፓርቲው አመራርና አባላት የተሰጣ የግንዛቤ የማስጨበጥ ስልጠና እቅድ ከንውን በመቶኛ ይቀመጥ፣ በዚህ ሩብ ዓመት እቅድ 30612 ክንውን 29,898 አባላት ስልጠና መስጠት ተችለዋል ፡፡

ተግባር 2፡ የፓርቲው አመራርና አባላት የመንግስትና የፓርቲውን ሕጎችና ውሳኔዎች ስለመከበራቸው፣

- የፓርቲው አመራርና አባላት የመንግስትና የፓርቲውን ሕጎችና ውሳኔዎች ከመክበርና ከማስከበር አኳያ የተሻለ እንዲሆን ማስቻል ተችሏል ፡፡

ተግባር 3፡ የፓርቲው አባላት የፓርቲውን የዲስፒሊን ግዴታዎች ስለማክበራቸው፣

- አባዛኛው አባላችን የፓርቲው ግዴታ ከመወጠት አኳያ የተሻለ መሆኑ

ተግባር 4፡ የሥነ-ምግባር ብልሹነት በሚታይባቸው አባላት ላይ የአሰራር ሥርዓትን ጠብቆ በ3 አባልና አመራር ላይ የእርምት ርምጃ መውድ ተችሏል ፡፡

ተግባር 5. የግቡ ዋና ዋና ግኝቶች በጥንካሬና በድክመት ተለይተው ይቀመጡ፡፡

በጥንካሬ

- አባዛኛው አባላችን የፓርቲው ግዴታ ከመወጠት አኳያ የተሻለ መሆኑ
- የፓርቲው አመራርና አባላት የመንግስትና የፓርቲውን ሕጎችና ውሳኔዎች ከመክበርና ከማስከበር አኳያ የተሻለ መሆኑ
- አመራሩና አባሉ ሰው ተኮር እና ኮርደር ልማት ተግባራት በመፈጸም አርአያ ሆነ ከመፈፀም ረገድ ጅምሩ ጥሩ መሆኑ
- አብዛኛው የፓርቲው አባላት የፓርቲውን ዲሲፒሊን ከሚያጎድፉ እና ከማህበራዊ ሚዲያ ያልተገባ መረጃ ከመስጠት ከጊዜ ወደ ጊዜ የተሻሻለ የመጣ መሆኑ
- የሥነ-ምግባር ብልሹነት በሚታይባቸው አመራርና አባላት ላይ አሰራሩን ጠብቆ የእርምት ርምጃ መወሰዱ

ድክመት

- ውስን አባላት የፓርቲው አሰራር የማይጠብቁ መኖራቸው
- በፓርቲው ስነ-ምግባር ጤናማነት ላይ በቂ ግንዛቤ ያለመፍጠር
- የስነ-ምግባር ጤናማነት ችግር ያለበት በህዋስ አጀንዳ አድርጎ ያለመታግለ

**ግብ 4፡- በፓርቲ ውስጥ የሙስና ትግሉ መደረጉን ማረጋገጥ፣**

ተግባር 1፡ የፓርቲ አባላት፣ አመራርና አካላት የአገሪቱን የፀረ-ሙስና ህግ፣ ዓላማ እና በሙስና አስከፍነት ላይ የጠራ አመለካከት ኖሮአቸው እንዲያካብሩና እንዲያስከብሩ የግንዛቤ ማስጨበጫ ስልጠና ስለመሰጣታቸው፣

- በፀረ-ሙስናና ሌብነት ዙሪያ ለወረዳ ፣ ለመ/ድርጅት ፣ ለህዋስ አመራሮችና እና ለአባላት ፣ ለመንግስት ሰራተኛ የስልጠና እቅድ 460 ከንውን 451 ማሰልጠን ተችሏል

ተግባር 2፡ የፓርቲ አባልና አመራሩ የፀረ-ሙስና ሕጎችን በጥብቅ ዲሲፒሊን ስለማክበራቸው፣

- ሙስና ለመዋጋት በፀረ-ሌብነትና ብልሹ አሰራርን ለመታገል በዕቅድ ተይዞ ትግል እየተደረገ መሆኑ፣በሌብነትና ብልሹ ተከታታይነት ያለው አዝማሚያ እተሰራ አጀንዳ ማድረግ ተችሏል ፡፡

ተግባር 3፡ የጸረ-ሙስና ትግል በየደረጃው የሚገኝ የፓርቲ አካላትና አባላት ዕቅድ፣ ሪፖርት፣ ድጋፋዊ ክትትል፣ ግምገማና ግብረ መልስ አካል ስለመሆኑ፣አጀንዳ ተደርጎ ይገመገማል ፡፡

ተግባር 4፡ የሙስና ችግር የምታይባቸው የፓርቲ አባላትና አመራር አባላት ላይ የአሰራር ሥርዓትን ጠብቆ የእርምት ርምጃ ስለመወሰዱ ዮለም ፡፡

ተግባር 5. የግቡ ዋና ዋና ግኝቶች በጥንካሬና በድክመት ተለይተው ይቀመጡ፡፡

**በጥንካሬ**

- ሙስና ለመዋጋት በፀረ-ሌብነትና ብልሹ አሰራርን ለመታገል በዕቅድ ተይዞ ትግል እየተደረገ መሆኑ
- በሌብነትና ብልሹ ተከታታይነት ያለው አዝማሚያ እተሰራ አጀንዳ እየተደረገ መሆኑ
- በፀረ-ሙስናና ሌብነት ዙሪያ ለመዋቅር ስልጠና መሰጠቱ
- በብልሹ አሰራርና ሌብነት የተጠያቂነት ስርዓት እየሰፈነ መሆኑ
- በፀረ-ሙስናና ሌብነት ዙሪያ ለወረዳ ፣ ለመ/ድርጅት ፣ ለህዋስ አመራሮችና እና ለአባላት ፣ ለመንግስት ሰራተኛ ስልጠና መሰጠቱ
- ለሙስና በር የሚከፍቱ አሰራሮች ተለይቶ በአጀንዳ ትግል እየተደረገ መሆኑ

**በከፍተት**

- የሙስና ብልሹ አሰራር ወጥነት ባለው መልኩ ትግል እያደረጉ ያለመሄድ
- ተከታታይነት ባለው መልኩ የአስተሳሰብ ለውጥ እንዲመጣ በቂ ስልጠና እየተሰጠ አለመሆኑ

**ግብ 5፡- የፓርቲው አካላትና አባላት መብቶች መረጋገጣቸውን መከታተል፣**

ተግባር 1፡ የፓርቲ አባላት በመተዳደሪያ ደንብ የተቀመጡ መብቶች ያለምንም መሸራረፍ ስለመከበራቸው፣

- የፓርቲውን ፕሮግራም መተዳደሪያ ደንብ፣ መመሪያዎች ለማክበርና ለማስከበር የሚደረገው ጥረት መኖሩ

ተግባር 2፡ የፓርቲው አባላትና አመራር በመተዳደሪያ ደንቡና ሌሎች መመሪያዎች ውስጥ የተቀመጡትን ግዴታዎች ስለማከራቸው፣

ተግባር 3፡ በፓርቲው ውስጥ የሃሳብ ልዩነቶችን ወይም አለመግባባቶችን ሲከሰቱ በፓርቲው የአሰራር መርሆዎች ተከትሎ የመፍታት ባህል ማዳበሩና በአብላጫ ድምጽ የተወሰነ ውሳኔ በአባላት፣ አመራርና አካላት ተገዢና በጥብቅ ዲስፐሊን ስለመከበራቸው፣

- አባላት በፓርቲ ጉዳዮች በሚኖሩ መድረኮች በነጻነትና በእኩልነት በውይይት መድረኮች የመሳተፍ፣ ሀሳብን ነፃ ሆኖ የማራመድና የመከራከር መብታቸው የተጠበቀ መሆኑ፣

ተግባር 4፡ የፓርቲ የመተደደሪያ ደንብና የመመሪያዎች ጥሰት በፈጸሙ የፓርቲ አባላትና አመራር ላይ የተወሰዱ ርምጃዎችና ለአባላት ኮንፈረንስ ቀርበው ስለመጽደቃቸው የአባላትና የአመራር ለየብቻቸው በአሃዝ ተደግፎ ይቀመጥ፣

- 16 አመራርና አባላት እርማጃ መወሰዱን ተከትሎ በኮንፍራንስ ቀርቦ እንዲፀድቅ ተደርጓል ፡፡

ተግባር 6፡ ከፓርቲው አባላትና አመራር በየደረጃው ለኮሚሽን የቀረቡ አቤቱታዎች፣ የተሰጡ ውሳኔዎችና ውሳኔዎቹ ስለመፈጸማቸው እቅድ ክንውን በአሃዝ ይደገፍ፡፡

- በከ/ከተማ ደረጃ 1 አቤቱታዎች ቀርበዉ 1 ምላሽ ያገኘ ሲሆን በወረዳ ደረጃ 4 አቤቱታዎች ቀርበው 4ም የተፈታ ሲሆን አጠቃላይ በድግግሞሽ 5 አቤቱታዎች ቀርበው 5ቱም የተፈታ ሲሆን 4ቱ የፓርቲ ውሳኔ የፀናባቸው ሲሆን 1 ወደ አመራሪነት ይመለስ የሚል ነው ፡፡

ተግባር 7፡ የግቡ ዋና ዋና ግኝቶች በጥንካሬና በድክመት ተለይተው ይቀመጡ፡፡

- በጥንካሬ
- አባላት በፓርቲ ጉዳዮች በሚኖሩ መድረኮች በነጻነትና በእኩልነት በውይይት መድረኮች የመሳተፍ፣ ሀሳብን ነፃ ሆኖ የማራመድና የመከራከር መብታቸው የተጠበቀ መሆኑ፣
- የፓርቲውን ፕሮግራም መተዳደሪያ ደንብ፣ መመሪያዎች ለማክበርና ለማስከበር የሚደረገው ጥረት መኖሩ፣
- በሚገኝበት የሥራ መስክ እና ኃላፊነት ደረጃ የፓርቲውን አንድነት፣ ጥራትና ጥንካሬ፣ የፓርቲውን የፖለቲካ ዕሳቤዎች ለመጠበቅ ተሳትፎ ከማድረግ አኳያ ጅምር መኖሩ፣
- በየደረጃው የሚገኙ የፓርቲ መዋቅር ከአባላትና አመራር የሚቀርቡ የሙብት ጥሰት ቅሬታዎችን በአግቡ እየታየ መሆኑ
- ለኮሚሽን የሚቀርቡ አቤቱታዎች በአሰራር መመሪያ መሰረት በኮሚሽኑ የሚሰጡ ውሳኔዎች በተገቢው እየተፈፀመ መሆኑ

**ግብ 6- የፓርቲው ገንዘብ፣ ንብረትና ሰነዶች በአግባቡ መያዛቸውንና ስራ ላይ መዋላቸውን መቆጣጠር፣**

ተግባር 1፡ የፓርቲ ገንዘብና ንብረቶች በብልጽግና ፓርቲ ቅ/ጽ/ቤት ስም ተመዝግበው በአግባቡ ስለመጠበቃቸው፣

- በብልፅግና ፓርቲ ስም የተመዘገበ የለም

ተግባር 2፡ የፓርቲው ገንዘብ በፓርቲው የፋይናንስ መመሪያ መሰረት ሥራ ላይ ስለመዋላቸው እቅድ ከንውን በመቶኛ፣

- በክ/ከተማ ደረጃ የሚንቀሳቀስ በጀት የለም

ተግባር 3፡ የፓርቲው ገንዘብና ንብረት ከክ/ከተማ እስከ ወረዳ ድረስ የ2015 በጀት ዓመት በውስጥና በውጭ ኦዲት ስለመደረጉ እና የተገኙ የኦዲት ግኝቶች እና የተወሰደ የማስተካከያ

- እስከ 2016 በጀት ዓመት ድረስ ኦዲት ተደርጓል የተገኘ ግኝት የለም

ተግባር 4፡ በገንዘብና በዐይነት ከፓርቲው ደጋፊዎች የሚሰበሰብ እና ልዩ ልዩ ገቢዎች (ልሳን፣ የመጽሃፍ ሽያጭ) በአግባቡ ታውቆ አሚጦ ገቢ ስለመሆናቸው እቅድ ከንውን ይገላጻል፣

- በገንዘብና በዓይነት ከፓርቲው ደጋፊዎች የሚሰበሰብ እና ልዩ ልዩ ገቢዎች (ልሳን፣ የመጽሃፍ ሽያጭ) በአግባቡ ታውቆ አሚጦ ገቢ ስለመሆናቸው  በሩብ ዓመቱ  ልዩ ልዩ ገቢዎች (ልሳን፣ የመጽሃፍ ሽያጭ) እቅድ **2,302,316.63 ክንውን 3,040,016** ተሰብስቦ 132 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል

ተግባር 5፡ የፓርቲው ሀብትና ንብረት ተገምቶ በውል ስለመታወቁ፣ ፐርው የሚጠቀማቸው ንብረቶች በባርቲው ስም ባይሆን ተመዝግቦና ተገምቶ ተይዟል

ተግባር 6፡ የአባላት መረጃ በአግባቡ በዳታ ቤዝ መያዙንና ወቅታዊ ስለመደረጉ እቅድ ክንውን በመቶኛ፣

- ካሉን 74,643 አባላት 74,643 አባል ወደ ዳታ ቤዝ 100 ፐርሰንት ገብቷል ፡፡

ተግባር 7፡ የፓርቲ ሰነዶች በአግባቡ ተሰንደው እና ተመዝግበው ስለመያዛቸው፣

- በፓርቲ የወጡ 13 መመሪያዎች በኮሚሽኑ የወጡ 3 መመሪያዎች በድምሩ 16 መመሪያዎች በየደረጃው በአግባቡ ተሰንደውና ተመዝግበው ይገኛሉ

ተግባር 8፡ የፓርቲው አመራርና አባላት ከቦታ ቦታ ስዛወሩ በእጃቸው የሚገኘውን ንብረትና ሰነድ ስለማስረከባቸው ፣

- ፡ የፓርቲው 16 አመራርና አባላት ከቦታ ቦታ ስዛወሩ በእጃቸው የሚገኘውን ንብረትና ሰነድ  አስረክበው እንዲሄዱ ማድርግ ተችሏል ፡፡

ተግባር 9፡ የግቡ ዋና ዋና ግኝቶች በጥንካሬና በድክመት ተለይተው ይቀመጡ፡፡

- የፓርቲ ገንዘብና ንብረቶች በአግባቡ ተመዝግበው መያዙ፣
- ከ2013 ጀምሮ ያለውን የውስጥም የውጭም ኦዲት ማስደረግ መቻሉ
- ፓርቲው የሚጠቀምባቸው ንብረቶችን ወይም ግብዓቶች በፓርቲው በተቋም የተሟላ መሆኑ እስከ ወረዳዎች  ድረስ
- የአዳዲስና ነባር አባላት መረጃ በአግባቡ በዳታ ቤዝ መያዙንና ወቅታዊ መደረጉ መቶ ፐርሰንት

**ግብ 7፡- የአባልነት መዋጮ በትክክል ተሰብስቦ ገቢ መደረጉን መከታተል፡፡**

ተግባር 1፡ በየደረጃው የሚገኘው የፓርቲ ሙሉ እና ዕጩ አባል የአባልነት መዋጮ ታቅዶ፣ በስኬል መሰረት ተሰብስቦ ገቢ ስለመደረጋቸው እቅድ ከንውን በመቶኛ፣

- የፓርቲ ፋይናንስ ለማጠናከር በገንዘብና በዓይነት ከፓርቲው ደጋፊዎች የሚሰበሰብ እና ልዩ ልዩ ገቢዎች (ልሳን፣ የመጽሃፍ ሽያጭ) በአግባቡ ታውቆ አሟጦ ገቢ ስለመሆናቸው ወርሃዊ መዋጮ እቅድ **1,484,590.5** ክንውን **1,733,690.59** ተሰብስቦ 116 ፐርሰንት ማሳካት ተችሏል

ተግባር 2፡ የአባልነት መዋጮ ለከፈሉት አባላት ደረሰኝ በየወሩ ስለመሰጠቱ፣የደረሰን እትረት ባኖርም ደረሰን መስጠት ላይ ውስንነቶች አሉ

ተግባር 3፡ የአባልነት መዋጮ የማይከፍሉ አባላት የእርምት ርምጃ ስለመወሰዱ በአሃዝ ተደግፎ ይገለጻል፡፡

- በኖርም መሰረት ወርሃዊ መዋጨየ የማይከፍሉ አባላት የለም

ተግባር 4፡ በክ/ከተማ አስተዳደር ከተሰበሰበው የአባላት መዋጮ ውስጥ በአባላት መዋጮ አሰባሰብ መመሪያ መሰረት 20% ለዋና ጽ/ቤት ፈሰስ ስለመደረጉ በአሃዝ ይቀመጥ፤የለም

ተግባር 5፡ የግቡ ዋና ዋና ግኝቶች በጥንካሬና በድክመት ተለይተው ይቀመጡ፡፡

ጥንካሬ

- ነባርም አዳዲስ አባላትም ወደ ክፊያ ስረዓት መግባታቸው
- የቢሮና ት/ቤት አባላት በፔሮል ስረዓት እንዲከፍሉ መደረጉ

  በድክመት
- ለከፈሉ አባላት ለእያንዳንዱ ደረሰኝ ከመስጠት ይልቅ በህዋ ተቋም ስም መሰጠቱ
- ተሰበሰበውን ገንዘብ ፈጥኖ አለማወራረድ

ግብ8፡የኮሚሽኑ መዋቅር እርስ በርሱና ከሚመለከታቸው ባለድርሻ አካላት ጋር ትብብርና አጋሪነት በማጠናከር ለኮሚሽኑ ተልዕኮ ስኬታማነት አመቺ ሁኔታዎችን መፍጠር፡፡

ተግባር1 ከክፍለ ከተማ ኮሚሽን ቅ/ጽ/ቤት ሰብሳቢ የ2017 በጀት ዓመት ዕቅድ የስምምነት ሰነድ(MOA) ከ11 ዱም ወረዳ ኮሚሽን ቅ/ፅ/ቤት ጋር መፈራረም የተቻላ ሲሆን ፣በየወቅቱ የዕቅድ አፈጻጸም ምዘና በማካሄድ ግብረ-መልስ መስጠት እና የጋራ የምክክር መድረክ በማካሄድ ቅንጅታዊ አሰራር ማጎልበት ተችሏል

ተግባር2፡በየደረጃው የሚገኙ የኮሚሽን መዋቅር ከአጎራባች ጋር ካለው የኮሚሽን መዋቅር ጋር ቅንጅት በማጠናከር ልምድ እየተለዋወጡ መስራት፣

- ከቂርቆስ ክ/ከተማ ኮሚሽን ቅ.ፅ/ቤት እና ከትራንስፖርት ቢሮ ኮሚሽን ጋር ትብብርና የአጋርነት ስምምነት ሰነድ በመፈራረም የልምድ ልውውጥ በ6ወር 1ጊዜ ለማድረግ ታቅዶ 1ጊዜ ልምድ ልውውጥ ማድረግ ተችሏል ፡፡

ተግባር3፡በየደረጃው ከሚገኘው የፓርቲ ቅርንጫፍ ጽ/ቤቶችና አስተባባሪ ኮሚቴ ጋር ያለውን ቅንጅትና ትብብር በመደበኛ የግንኙነት ጊዜ ማጠናከር ስራ ተሰረቷል

- የቅንጅትና የተብብር ባህሉን በማሳደግ በ6ወር 2ጊዜ መደበኛ ግንኙነት ለማድረግ ታቅዶ 4ጊዜ በመገናኘት የኮሚስኑን ተግባር እና በቅንጅት በሚሰሩ ተግባራት ላይ በመወያየት በየጊዜው የአስተሳሰብና የተግባር አንድነትን እንዲፈጠር ማድረግ ተችሏል ፡፡

ተግባር4፡ለኮሚሽኑ ተልዕ ኮመሳካት አጋዥ የሆኑ ባለድርሻ አካላትን በመለየት በትብብር እየተሰራ ይገኛል ፡፡

- ከተፎካካሪ ፓርቲዎች ምክርቤት ከድሞክራሲ ስረዓት ግናባታ ባህል ዘርፍ በመቀናጀት በትብብር መስራት ተጀምሯል ፡፡

**ግብ9፡ለፓርቲያችን እሴት የሚጨምሩ የህብረተሰቡን ችግሮችን የሚቀርፉ ተግባራት ተከናውነዋል፡፡**

- የአረንጓዴ አሻራ እንደ ኮሚሽን 5000 ችግኝ መትከል መቻሉ
- ለጎፋ ጎርፍ ተጎጂዎች በኮሚሽን ተነሳሽነትና አቅም 142000 ብር መሰብሰብ ተችለዋል
- ጤና መድህን ከፍለው መታከም ለማይችሉ 10 አቅመ ደካማ ወገኖቻችንን እንደ ኮሚሽን መሸፈን ተችሏል

1.1.1. ፡ በበጀት ዓመቱ ታቅደው ያልተከናወኑ ተግባራት ካሉ ከነምክንያት፣ስልጠና በሚፈለገው መልኩ ተደራሽ ማድረግ ላይ የተወሰነ ክፍተት መኖሩ፡፡

## 8. የታዩ መልካም ተግባራትና ተግዳሮቶች (ችግሮች)

- መልካም ተግባራትን በተመለከተ፤
- የአካል ግምገማ ተዘጋጅቶ መኮሚሽኑ መገምገምና መመዘን መቻሉ
- አጠቃላይ አመራሩና አባሉ ስለ ኮሚሽኑ ያላቸው ግንዛቤ እየጨመረ የመጣበት ሁኔታ መፈጠሩ
- በተለያዩ ደረጃዎች የኮሚሽን አሰራሮችና አደረጃጀት መመሪያው ላይ ግንዛቤ መፍጠር መቻሉ
- የሚቀርቡ አቤቱታዎችን በየደረጃው ያለው የኮሚሽን ተቋም ትኩረት በማድረግ ምላሽ መስጠት መቻሉ
- የዘርፉ አመራር ከጊዜ ወደ ጊዜ በስራው ላይ የተሻለ ግንዛቤ እየፈጠሩ ለፓርቲው አቅም እየሆኑ መሄዳቸው
  - ኮሚቴ አባላት ለኮሚሽኑ ከበጀት አንጻር ድጋፍ ማድረግ መጀመራቸው
  - **የታዩ ተግዳሮቶች (ችግሮች)**

- በክ/ከተማም ሆነ በወረዳ አቤቱታዎች ቀርበው ለሚወሰኑ ውሳኔዎች ቶሎ ይግባኝ ጠይቆ ድጋሜ እንዲታይ ከማድረግ ይልቅ ከአሰራር ውጪ ፓርቲ የወሰነው ውሳኔ ትክክል አድርጎ የመውሰድና ለኮሚሽኑ ውሳኔ ተገዢ አለመሆን የሚታዩ መኖሩ ለምሳሌ በለፈው ይመለስ ከተባለው ውስጥ 4 ምላሽ ያልተሰጠ መሆኑ

ያጋጠሙ ችግሮች

- ወቅታዊ ስራዎች መደራረብ በመደበኛ ስራዎች ላይ ተግዳሮት እየሆነ መሆኑ

የተወሰደ መፍትሄ

- በማስተሳሰርና አቀናጅቶ በመምራት መፍታት እየተቻለ ነው
- የሩብ ዓመቱ የኮምሽን አመራር በጥንካሬና በድክመት

በጥንካሬ

- አመራሩ ከዝግጅት ምእራፍ ስራዎችን የተመራበት አግባብ የተሻለ መሆኑ
- ለፓርቲው አቅም የሚሆኑ ሱፐርቪዢ እና እንስፔክሽን ስራን ከክፍለ ከተማ እስከ ወረዳ በተሻለ መጠን መስራት መቻሉ
- ከመረጃ አያያዝና መ/ድርጅት ኮሚቴዎች በአግባቡ ከማደራጀት አንጻር የተሻለ መሆኑ እና በተጓደሉ ኮሚቴዎች ቦታም መተካካት መቻሉ
- የቁልፍ ተግባር አፈፃፀም እምርታው ለውጥ እየመጣ መሆኑ
- አዲስ የኮሚሽን መዋቅር ጥናት ተግባራዊ መደረጉ

**በክፍተት**

- የኮሚሽኑን መመሪያዎች በስልጠና መልክ የማስረፅ ተግባር ውስንነትያለበትናበሂደት መሆኑ

- በበጀት ዓመቱ አንድ ደረጃ ከፍ ብሎ ከሚገኘው የኮሚሽን አደረጃጀት የተደረገ ድጋፍና ለወደፊት መሻሻል ያላባቸው ጉዳዮች፣ አቅም በሚሆን መልኩ ድጋፍ ተደርጓል ፡፡

## 1.2. በበጀት ዓመቱ በየደረጃው የሚገኙ የፓርቲ ቅርንጫፍ ጽ/ቤቶች ለኮሚሽኑ መዋቅር የተደረገ እገዛና ድጋፍ*(በ3 መ/ ዎች መሰረት)* በሚከተሉት ነጥቦች መሰረት በጥንካሬና በክፍታት የታዩት ይቀመጡ፡፡

**በጥንካሬ**

- የፓርቲ መዋቅር ባለበት ሁሉ የኮሚሽን መዋቅር እንዲዋቀር በማገዝና በመደገፍ መቻሉ

- የኮሚሽኑን መዋቅር እስከ ወረዳ ድረስ ተግባራዊ በማድረግመቻሉ
- ፓርቲ ካለው ሀብት ለኮሚሽኑ ጽ/ቤቶች ለስራው የሚያስፈልገውን በጀትና ሎጅስቲክ(የስራ ቦታ/ቢሮ፣ የቢሮ ማቴሪያልና ተሽከርካሪ) እንዲሟላ መደረጉ
- በኮሚሽኑ የሚሰጡትን ምክረ-ሃሳቦች በመተግበርና ሪፖርት በማቅረብ፣የግብረ መልስ ግብረ መልስ እየተሰጠ መሆኑ
- በየደረጃው የጋራ የውይይት መድረኮች እንዲፈጠሩ በማድረግ መቻሉ
- በየደረጃው በሚካሄዱ ኮንፈረንሶች ኮሚሽኑ እቅድና ሪፖርት እንዲያቀርቡ በማድረግ ናቸው፡፡

  በክፍተት

- የኮሚሽን አመራሮችን በወቅታዊ ስራ እንዲጠመዱ መደረጉ

## ማጠቃለያ

በ2017 በ2ኛ ሩብ ዓመት የኮሚሽኑ ተግባራት ሲታይ ካለፉት ሁለት እና ሶስት አመታት የተሻሉና አመራሩም በልዩ ትኩረት በመስጠት በየደረጃው ያለው አመራር ግንዛቤ በመፍጠር ያሉ ብዥታዎችን ግልጽ በማድረግ በሁሉም ደረጃ ስለ ተቋሙ የተሻለ ግንዛቤ እየተፈጠረ ይገኛል፡፡ በዚህም በሩብ አመቱ የተቀመጡ ቁሉፍ ተግባርእና አቤት ተግባር ለመፈፀም አቅም እንዲሆን አስችሏል ፡፡